# ከማርያም ባልቴት



እንደ ቀርጤስ ሰዎች ሁሌ ውሸተኞች፣

ለወገን አያዝኑ ጨካኞች አውሬዎች፣

እርካታ የላቸው የጥቅም ሆዳሞች፣

እግዜርን የማያውቁ ነገር ለፋፊዎች።

የእውነትን አርበኞች አይዞህ እንበላቸው፣

መስዋት ለሆኑት አንተ ቁምላቸው።

ኦርቶዶክስ ተነክታ የጀርባ አጥንትህ፣

አድቀው ሊሰብሩህ እየተፎከረብህ፣

አጥብቀህ ተቃወም አንድ ሆነህ በልብህ፣

እንዳትከፋፈል በእምነት በዘርህ፣

መተኪያ ለሌለው ነፃነት እምነትህ።

ያልነበረ አየን በዚህ 2 ዓመት፣

ቀድሶ እየወጣ በሰው ላይ አከ እትፍ ለትፋት፣

ከቶ አላየንም እንዲህ ብሎ አባት።

የሚያይ አያይ መስሎት ትልቁ ጥፋት

ብድር ከፋይ አለ ሲቀርቡ ችሎት፣

በደረሰ ጊዜ ቀኑ በድንገት።

ይህ ሁሉ ምእመን አይሆንም ቀሳውስት፣

እውነት ተከትሎ እንዳይጠፋ ሥርዓት፣

ቢይዘው ነው እንጂ ለጌታው ቤት ቅናት።

እንደማገር እንጨት የቆመው ከደጅ፣

የእግዜር (የማርያም) ቤት ተደፍሮ ቢከፋው እንጂ።

ራስን መስዋት ለወገን ነፃነት፣

ማየት ቢያስመርረው የትውልድ ባርነት፣

ተከፍሎ እያየው በዘር በሃይማኖት።

አገሩ ተሸጦ ችግሩ አፍጥጦ፣

ሕዝብ እየተሰደደ በባህር ተውጦ፣

እየተዋረደ አገርና እምነት፣

ለልጅ አዋቂውም ባህል ሆነው ስደት።

በደሉ  ቢበዛ ባገሩ ባርነት፣

እየተራበ ጉርሻ እየተሸጠለት፣

ምነው አይሰደድ ስብዕናው ጎድሎበት።

እያሪኮ ይፍረስ እንደው በቃል ብቻ፣

እግዜርን ይዘናል የእኛ መመኪያ።

ጥሩ ምሳሌ አየን የሚወርድ ለትውልድ፣

ሳያጠፉ መጥፋት እንደ በግ መታረድ።

ነገ ስትከፈት የእውነት ማኅደር፣

በጣም ተቆጭቶ አልቅሶ ከማምረር፣

አሁን የዛሬን ቀን ከወገንህ ማበር።

ትንሽ እሳት አገር ታህል፣

ለነገዋ እምነት (አገር) ዛሬ ነው መታገል።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር